ጦር እያደራጁ ስለ ሰላም ማውራት ይቻል ይሆን??

የለንደን ርዕሰ አድባራት ደብረ ፅዮን ቅድስት ማርያም ቤተክርስቲያን ላለፉት 12 ወራት ስትናወጥ የሰነበተችበት ማዕበል ከቤተ ክርሲቲያኑዋ አባሎችና በለንደን ከሚኖሩ አማኞች የተሰወረ አይደለም፡፡ የማዕበሉ ዋና መነሻ የቤተክርስቲያናችንን አመራርም ሆነ አስተዳደር ለመወሰን በ"Charity Commission" ደንብ መሠረት ስልጣኑም ሆነ ብቃቱ አለን በሚሉ ምዕመናንና እኛ ያልነውን ካልሰማችሁ መቅሰፍት ይወርዳል ብለው በማሰብና ቤተክርስቲያኑዋን ሳይሆን እራሳቸውን ለማንገስ በተነሱት የቤተክርስቲያኑዋ አስተዳዳሪ፣ አንዳንድ ካህናትና፣ የእነሱ አጃቢዎች መካከል መሆኑ እየጠራ የመጣ ጉዳይ ነው፡፡

በአሁኑ ወቅት ለቤተክርስቲያናችን ወጥ የሆነ አመራር ቀርቶ የዐለት ተግባር ማከናወን የተሳነው የሰበካ ጉባኤ ከስልጣን መውረዱን ከብዙ ሳምንታት ሹክሽክታ በኍዋላ በ 23 September 2012 በተደረገው የጠቅላላ ጉባኤ አስታወቀ፡፡ ከዚያም ተተኪ አስተዳደር ለማስመረጥ የሰበካ ጉባኤው ያደረጋቸው ሁለት ሙከራዎች ከመነሻው የአባላትን ጥያቄ ያላካተተ በመሆኑ በቤተክርስቲያኑዋ ውስጥ ያለውን ክፍፍል ወደ ከፋ ደረጃ ላይ እያደረሰው በመምጣቱ በጅምር ቀረ፡፡

በሁለተኛው ሙከራ የጥምር ጉባኤውን አማራጭ የውሳኔ ሀሳቦች አወያይቶ ውሳኔ ላይ መድረስ የተሳነው በግለሰቦች ግፊት የሚዋዥቀው የሰበካ ጉባኤ በቅድሚያ በቤተክርስቲያኑዋ ውስጥ ያለውን ውጥረት ለማርገብ የሚያስችል የሰላም ጥረት እንዲያደርግ ከምዕመናን በቀረበለት ጥያቄ መሠረት 18 አባላት ያለው የሰላም ኮሚቴ ማዋቀሩን በ 7 November 2012 ለህዝብ አስታወቀ፡፡

የሰላም ጉባኤው በቤተክርስቲያኑዋ ምዕመናን፣ ካህናትና የሰንበት ትምህርት ቤት አባሎች የተውጣጡ አባላት የሚገኙበት ሲሆን በቅርቡ በሰማነው መረጃ መሠረት የቤተክርሲቲያኑዋ ችግር ዋነኛ ምክንያት የሆነውና በግለሰቦች የሚመራው የሰበካ ጉባኤ አሁንም የሰላም ኮሚቴውን ገለልተኝነት የሚጋፉ መመሪያና ማዘዣዎች እያዥጎደጎደ እንደሆነ ለመረዳት ችለናል፡፡

ይህ የሰላምና የእርቅ ጥያቄ የህዝብ በመሆኑ ጥቂት በአመራር ላይ የሚገኙ የሰበካ ጉባኤ አባላት ለራሳቸው ግብ ጠልፈው መጠቀሚያ እንዳያደርጉት ከፍተኛ ስጋት ያለን ሲሆን ከየክፍሉ የተወከሉትም አባላት ለእውነተኛ ሰላምና እርቅ በትጋት ይሰሩ ዘንድ ጥያቄያችንን እያቀረብን የሰላሙን ጥረት በአባልነታችን ያገኘነውን በቤተክርስቲያናችን ጉዳይ ላይ የመወሰን መብት የሚያስከብር እንደሚሆን ያለንን ተስፋ እየገለፅን ይህ ሳይሆን ቢቀር መብታችንን በህግ ለማስከበር የሚመለከታቸውን አካላት የማሳወቅና መብታና ህግ የማስከበር ጥረታችንን እንደማያቋርጥ ከወዲሁ እናሳስባለን፡፡

አባ ግርማ በአንድ በኩል የሰላምና የዕርቅ ሒደት ተጀምሮአል እያሉ በሌላ በኩል ደግሞ ጦራቸውን ለማደራጀት ቀንና ሌሊት ቀና ደፋ እያሉ ባሉበት ሁኔታ ምን አይነት ሰላም በቤተክርስቲያናችን ሊመጣ ይችል ይሆን እያልን ስንጠባበቅ እሁድ በ 11 November 2012 ከቅዳሴ በኋላ በተናገሩት ማስታወቂያ በታህሳስ ወር መጨረሻ ተተኪ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ይመረጣል ማለታቸውን ሰማን፡፡

ይህ የምርጫ መርሀ ግብር ከሰላምና እርቅ ሒደቱ ጋር እንዲጣጣም ተነጋግሮ ማስተካከል ሲቻል ሰላም መጣም አልመጣም ምርጫው ይደረጋል ማለታቸው ዛሬም እንደቀድሞው የምንላችሁን ተቀበሉ መሆኑን ያመለክታል፡፡

እጁን አውጥቶ የመረጣቸውና ስልጣን በአደራ የሰጠው ህዝበ ክርስቲያን የቤተክርስቲያንዋን አባላት ትእዛዝ ከመቀበል በስተቀር የራሱን ቤተክርስቲያን አስተዳደር በተመለከተ የሚያቀርበው ሐሳብ እንዳይታይ ከታገደ ስልጣኑን መልሶ መቀበል የሚችል መሆኑን ዘንግተውት ይሆን????

". . . . ልብ ያለው ልብ ይበለው . . . ."

እግዚያብሔር ሰላምና ፍቅርን ለእኛና ለቤተክርስቲያናችን ያድለን!